

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

## የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር


# ለይለት አልቀድር

https://www.al-feqh.com/am



# 5 ለይለት አልቀድር



## መ ው ጫ



## የመወሰኛው ሌሊት ተብሎ ለምን ተሰየመ?

1. በዚህ የተሰየመው

﴿وَمَا قَدَرُواْ ٱللَّهَ حَقَّ قَدۡرِهِۦٓ﴾ [الأنعام:91]

‹‹አላህን ተገቢ ክብሩን አላከበሩትም፡፡››[አል-አንዓም:91]

እንዳለው ዓይነት ክቡርነቱን ለማመልከት ነው ተብሏል፡፡

ሌሊቱ ቁርኣን የወረደበት (የተላለፈበት)፣ መላእክት፣ የአላህ ረሕመት፣ በረከቱና ምሕረቱ የሚወርድበት ሌሊት በመሆኑ ምክንያት ከበሬታን የተጎናጸፈ ነው ማለት ነው፡፡ ሌሊቱን በዕባዳ ሕያው የሚያደርግ ሰው የተከበረ ነው ማለትም ይሆናል ተብሏል፡፡

2. ቀደር የሚለው ቃል መጣበብ በሚለው ትርጉሙ ነው የሚሉም አሉ፡፡ ይህም ቁርኣን ውስጥ እንደተመለከተው

﴿وَمَن قُدِرَ عَلَيۡهِ رِزۡقُهُۥ فَلۡيُنفِقۡ مِمَّآ ءَاتَىٰهُ ٱللَّهُۚ﴾ [الطلاق:7]

‹‹በርሱም ላይ ሲሳዩ የተጠበበበት ሰው፣››[አል-ጠላቅ:7] እንዳለው ዓይነት ሌሊቱ በግልጽ ተለይቶ ያልታወቀ ድብቅ መሆኑን ወይም በዚያ ሌሊት ምድር ወደ መሬት በወረዱ መላእኮች ብዛት የሚጣበብ መሆኑን ለማመልከት ነውም ተብሏል፡፡

3. ቀድር ማለት መወሰን በሚለው ትርጉሙ ነው የሚሉም አሉ፡፡ ይህም በዚያ ሌሊት ዓመቱን የሚመለከቱ ውሳኔዎች የሚተላለፉበት መሆኑን ለማመልከት ነው፡፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና :-

﴿فِيهَا يُفۡرَقُ كُلُّ أَمۡرٍ حَكِيمٍ ٤﴾ [الدخان:4]

‹‹በውስጧ የተወሰነው ነገር ሁሉ ይለያል፡፡››[አል-ዱኻን:4][1]

## የለይለት አልቀድር ትሩፋትና የላቀ ደረጃው

### 1. ቁርኣን የወረደበት ሌሊት ነው

አላህ ﷻ :-

﴿إِنَّآ أَنزَلۡنَٰهُ فِي لَيۡلَةِ ٱلۡقَدۡرِ ١﴾ [القدر:1]

‹‹እኛ (ቁርኣንን) በመወሰኛይቱ (በከበረችው) ሌሊት አወረድነው፡፡›› [አል- ቀድር:1] ብሏል፡፡

### 2. ሌሊቱ ከአንድ ሺሕ ሌሊት በላጭ ነው

አላህ ﷻ :-

(1) ፈትሕ አልባሪ ቅጽ 4 ገጽ 255

https://www.al-feqh.com/am

﴿لَيۡلَةُ ٱلۡقَدۡرِ خَيۡرٞ مِّنۡ أَلۡفِ شَهۡرٖ ٣﴾ [القدر:3]

‹‹መወሰኛይቱ ሌሊት ከሺሕ ወር በላጭ ናት፡፡›› [አል- ቀድር፡] ብሏል፡

## 3. በዚያ ሌሊት መላእክትና ሩሕ (መንፈስ) ይወርዳሉ

አላህ ﷻ ፡-

﴿تَنَزَّلُ ٱلۡمَلَٰٓئِكَةُ وَٱلرُّوحُ فِيهَا بِإِذۡنِ رَبِّهِم مِّن كُلِّ أَمۡرٖ ٤﴾ [القدر:4]

‹‹በርሷ ውስጥ መላእክትና መንፈሱ በጌታቸው ፈቃድ በነገሩ ሁሉ ይወርዳሉ፡፡›› [አል- ቀድር፡ 4] ብሏል፡፡ ከአቡ ሁረይራ በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ፡- ‹‹የመወሰኛው ሌሊት (ለይለቱል ቀድር) ሃያ ሰባተኛው ሌሊት፣ወይም ሃያ ዘጠነኛው ሌሊት ነው፤በዚያ ሌሊት በመሬት ላይ የመላእኮች ቁጥር ከአሸዋ ቁጥር የበለጠ ነው፡፡››[1] ብለዋል፡፡

## 4. የሰላም ሌሊት ነው

እንዲህ ብሏል ፡- አላህ ﷻ

﴿سَلَٰمٌ هِيَ حَتَّىٰ مَطۡلَعِ ٱلۡفَجۡرِ﴾ [القدر:5]

‹‹እርስዋ እስከ ጎህ መቅደድ ድረስ ሰላም ብቻ ናት፡፡›› [አል- ቀድር፡5] ይህም ሌሊቱ ሙሉ በሙሉ እስከ ጎህ መቅደድ ድረስ በጎ ነገር ብቻ እንጂ ምንም ክፉ ነገር የሌለበት ሌሊት ነው ማለት ነው፡፡



(1) በኢብን ኹዘይማ የተዘገበ

## 5. ሌሊቱ ብሩክ ሌሊት ነው

﴿إِنَّآ أَنزَلۡنَٰهُ فِي لَيۡلَةٖ مُّبَٰرَكَةٍۚ إِنَّا كُنَّا مُنذِرِينَ ٣﴾ [الدخان:3]

‹‹እኛ (ቁርኣንን) በተባረከች ሌሊት ውስጥ አወረድነው፤ እኛ አስፈራሪዎች ነበርንና፡፡››[አል- ዱኻን:3]

## 6. የዓመቱ ጉዳዮች ተወስነው ይለዩበታል

አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል፡-

﴿فِيهَا يُفۡرَقُ كُلُّ أَمۡرٍ حَكِيمٍ ٤﴾ [الدخان:4]

‹‹በውስጧ የተወሰነው ነገር ሁሉ ይለያል፡፡››[አል- ዱኻን:4]

## 7. የአላህን ቃል በማመንና ምንዳውን በማሰብ ሌሊቱን (በሶላትና በዕባዳ) ያሳለፈ ሰው ላለፈው ኃጢአቱ ምሕረት ያገኛል

የአላህ መልእክተኛ ﷺ ፡- ‹‹ የአላህን ቃል በማመንና ምንዳውን በማሰብ የመወሰኛውን ሌሊት (ለይለቱል ቀድርን በሶላትና በዕባዳ) የቆመ ሰው ላለፈው ኃጢኣቱ ምሕረት ይደረግለታል፡፡››[2] ብለዋል፡፡

## ለይለቱል ቀድር የትኛው ሌሊት ነው?

ሙስሊሙ በረመዷን የመጨረሻዎቹ አስር ቀናት በተለይም በኢተጋማሽ (ውትር) ቀኖች ማለትም በ21፣በ23፣በ25፣በ27ና በ29 ውስጥ ለዕባዳ ልዩ ጥረት እንዲያደርግ ለማነሳሳት አላህ ﷻ ይህን ሌሊት በነዚህ ቀናት ውስጥ ደብቆታል፡፡ ነቢዩ ﷺ ‹‹ለይለተ አልቀድርን ኢተጋማሽ (ውትር) በሆኑ የመጨረሻዎቹ የረመዷን አስር ቀናት ውስጥ ተጠባበቃችሁ ፈልጉ፡፡››[3] ብለዋል፡፡

አንዳንድ የዕውቀት ባለቤቶች ማስረጃዎቹን አንድ ላይ በማጣመር ሌሊቱ በነዚህ ሌሊቶች መካከል የሚዘዋወር መሆኑን አውስተዋል፡፡

(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(3) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

https://www.al-feqh.com/am

# በለይለቱል ቀድር ምሽት የሚወደዱ ሥራዎች

## 1. እዕትካፍ

እዕትካፍ ማለትም ለዕባዳ በመስጊድ ውስጥ መቀመጥ ለይለት አልቀድር በሚጠበቅባቸው ውትር ቀናት ብቻ ሳይሆን በአስሩም ቀናት በሙሉ ነው፡፡ ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ ከረመዷን የመጨረሻዎቹን አስር ቀናት እዕትካፍ ያደርጉ ነበር፡፡››[1] ብለዋልና፡፡

## 2. የአላህን ቃል በማመንና አጅሩን በማሰብ ሌሊቶቹን በዕባዳ ማሳለፍ

የአላህ መልእክተኛ ﷺ ፡- ‹‹የአላህን ቃል በማመንና ምንዳውን በማሰብ የመወሰኛውን ሌሊት (ለይለቱል ቀድርን በሶላትና በዕባዳ) የቆመ ሰው ላለፈው ኃጢኣቱ ምሕረት ይደረግለታል፡፡››[2] ብለዋል፡፡

## 3. ዱዓእ ማድረግ

ዓእሻ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ‹‹የአላህ መልእክተኛ ሆይ! ለይለቱል ቀድር ቢገጥመኝ ምን ብዬ ዱዓእ ላድርግ? ስላቸው፣‹አል'ሏሁምመ እን'ነከ ዐፉው'ዉን ቱሕቡል ዐፍወ ፈዕፉ ዐን'ኒ› (አላህ ሆይ! አንተ በጣም ይቅር ባይ ነህ፣ይቅርባይነትን ትወዳለህና ይቅር በለኝ) በይ አሉኝ፡፡››[3] ብለዋል፡፡

## 4. ለዕባዳ ጥረት ያደርጉ ዘንድ ቤተሰብን ከእንቅልፍ መቀስቀስ

ከዓእሻ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት፡- ‹‹ነቢዩ ﷺ የረመዷን የመጨረሻዎቹ አስር ቀናት ሲጀመር ሽርጣቸውን (መቀነታቸውን) ያጠብቁ፣ሌሊቶቹን (በዕባዳ) ሕያው ያደርጉና ቤተሰባቸውንም (ለዕባዳ ከእንቅልፍ) ይቀሰቅሱ ነበር፡፡››[4] ብለዋል፡፡



(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(3) በትርምዚ የተዘገበ
(4) በቡኻሪ የተዘገበ



https://www.al-feqh.com/am

# የለይለቱል ቀድር ምልክቶች

## 1. ሞቃታማም ቀዝቃዛም ያልሆነ ብሩህ ሌሊት ነው

ከጃቢር ብን ዐብደላህ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ እንዲህ ብለዋል ፡- ‹‹ለይለቱል ቀድርን እንዳይ ተደርጎ ነበር፣ከዚያ እንዲረሳው ተደረገ፤ በመጨራሻዎቹ አስር ቀናት ሌሊቶች ውስጥ ሲሆን፣ የማይከብድ ለቀቅ ያለ፣ብርሃናማ፣ሞቃታማም ቀዝቃዛም ያልሆነ ሌሊት ነው፡፡››[1] ብለዋል፡፡

## 2. በነጋታው ጸሐይ ነጭና ውጋገን የሌላት ሆና ትወጣለች

ኡበይ ብን ከዕብ (ረዐ) ስለ ምልክቶቹ ሲጠየቁ ፡- ‹‹የአላህ መልእክተኛ ﷺ በነገሩን ምልክት መሰረት በዚያ ቀን ጸሐይ ወጋገን የሌላት ሆና ትወጣለች፡፡››[2]ብለዋል፡፡

# መመሪያዎች

1. የዓመቱ ምርጥ ሌሊቶች በመሆናቸው፣አንድ ሙስሊም በመጨረሻዎቹ አስር ሌሊቶች ውስጥ የዕባዳ ዓይነቶችን ማብዛት ይኖርበታል፡፡
2. አንድ ሙስሊም ተመራጭ የሆኑ ወቅቶችን፣የዕባዳና የመልካም ሥራዎች አዝመራን በአልባሌ ነገር፣በዋዛ ፈዛዛ፣አስፈላጊ ባልሆነ የበዛ ሽመታና ዙረት ማባከን የለበትም፡፡

(1) በእብን ኹዘይማህ የተዘገበ

(2) በትርምዚ የተዘገበ